


## አርማችን

ዛሬ በዚህ የኢኮዘማ አርማ ሥር ራሳቸውን የሚያስተዋውቁት ከአርባ አራት ዓመት በፊት፤ ኢትዮጵያ በተባበሩት መንግሥታት ሴኩሪቲ ኮሌክቲቭ ዓላማ በገባችው ቃል ኪዳን መሠረት በሩቅ ምሥራቅ ደቡብ ኮርያ ዘመትው የነበሩት አባላት ናቸው።

አባላቱ ከተረሱ ከአርባ ዓመት በላይ ቆይተው እግዚአብሔር በፈቀድ ጊዜ፤ የኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች ማኅበር በሚል ስያሜ በደከመው ዕድሜያቸው ወቅት ዕድሉን በማግኘታቸው ከፍተኛ የመንፈስ እርካታ አግኝተውበታል።

ለነዚህ ጀግኖች ዝናቸው፣ ገድላቸው መስዋዕትነታቸውን በሚገባ የመሰከሩላቸው በስማቸው ሃውልት ያቆሙላቸው የመከራ ጊዜ ወዳጆቻቸው የደቡብ ኮርያኖች ከአባላቱ ይበልጥ ተደስተውበታል።

በዚህም አረማ መሠረት ከአገራችን አልፎ ዓለም አቀፋዊ ግንኙነት እንዲጠነክር ከ6ወር በፊት ለመጀመሪያ ጊዜ የኢኮዘማ ፕሬዝዳንት በኮርያ የኢንተርናሽናል ኮርያ ዘማቾች ፌዴሬሽን ታላቅ ስብሰባ ላይ ባቀረቡት የበሰለ ሪፖርት ኢትዮጵያ ያለምንም ቅድመ ሁኔታ የፌዴሬሽኑ አባል ሆናለች።

በዚህም ታላቅ የስብሰባ መድረክ የኢኮዘማ ፕሬዝዳንት ኢንጅነር ኰሎኔል እምላዕሉ ወረደ የሰላም አምባሳደር የሚል ሽልማት ተሸልመዋል።

እንግዲህ የኢኮዘማ ዋና ዓላማ አባላት ፀሐይ ስትመጣ በትኩስ ኃይላቸው የገነቡት ታላቅ ስም እንደገና በፀሐይ መጥለቂያ ታሪክ ራሱን እንዲደግም በማድረግ የምናከብርበት ጊዜ ታሪካችንን ለልጅ ልጆቻችን እንድናስተላለፍ ከጥንት ጀምሮ የውል እናት አገራችን አደራ አለብን።



AIC

1· ይህ መጽሔት በኢኮዘማ የሕዝብ ግንኙነት ክፍል የተዘጋጀ ቁጥር 1/87 ነው ።

This magazine is prepared by KWVAE public relation office issue no 1/95

2· ዋና አዘጋጅ ሻምበል ይልማ በላቸው

Chief Editor: Capt. Yilma Belachew

3· የሕትመት ኮሚቴ

- ሻለቃ ክፍሌ ድንበሩ ሰብሳቢ
- ሻምበል ማሞ ሀ/ወልድ
- ሻምበል ይልማ በላቸው
- ሻምበል ዘውዴ ወ/ቂርቆስ
- የመቶ አለቃ አሰፋ ደምሴ
- አቶ ሽፈራው ጥላሁን
- የ፲ አለቃ ሀብተጊዮርጊስ ገ/ጻድቅ

Editorial Committee

- Maijor Kifele Dinberu chairman
- Capt. Mamo Habte wold
- Capt. Yilma Belachew
- Capt. Zewdie W/Kiros
- Lt. Assefaw Demissie
- Lt. Shefera Tilahun
- CPL. Habte Giorgis G/Tsadik

4· ይህ ልዩ መጽሔት የኢኮዘማን ዓመታዊ በዓል ምክንያት በማድረግ የተዘጋጀ ነው ። ሰኔ 4/1987 ዓ·ም·

This Magazine is specially published for the occasion of KWVAE day July 11/1995

5· የፊት ሽፋኑ በተባበሩት መንግሥታት ሰንደቅ ዓላማ ስር ኮሪያ የዘመቱት 22 መንግሥታትን ያሳያል ገጽ ———
በስተጀርባው ሽፋን በኮሪያ ለኢትዮጵያ ጀግኖች የቆመውን የመታሰቢያ ሐውልት ያሳያል ገጽ ———

Front Cover Show 22 nations participated in Korean war under UN flag

The back cover shows Ethiopian heroes memorial movement in Korea - Choon Chun

ማውጫ

Content

# WHERE UN FORCES COME FROM





# የኢ·ኮ·ዘ·ማ ፕሬዚዳንት መልዕክት

ኢ.ንጅ. ኰ. አምሳዐሉ ወረደ.

## ውድ የኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች ማኅበር አባላት !

የኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች ማህበር አድጎና ጠንክሮ የመጀመሪያውን መጽሔት ለህትመት በማብቃቱ በማኅበሩ ሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ በምክር ቤቱና በራሴም ስም ሆኜ መልካም ምኞቴን ለመግለጽ በመቻሌ ለልዑል እግዚአብሔር ምስጋናዬን አቀርባለሁ ።

ማኅበራችን ከተቋቋመ ከሰኔ 1 ቀን 1984 ዓ·ም· ጀምሮ ካሳለፋቸው ቋሚና ከፍተኛ ውሳኔዎች ውስጥ አንዱና ዋነኛው ፣ በያመቱ ሚያዝያ 4 ቀን የኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች ማኅበር መታሰቢያ ቀን ሆኖ በማኅበሩ ተከብሮ እንዲውል ፣ ይህም ሚያዝያ 4 ቀን በሕዝብ በዓል ቀን ካልዋለ ከሚያዝያ 4 ብዙ ሳይርቅ እንዳመችነቱ በቅርቡ ባለው ቅዳሜ ወይም እሁድ እንዲውል ያደረገው ውሳኔ ነው ። እርግጥ በዚህ ዓመት የነበረው የሚያዝያ ወር በመንግሥት በኩል የምርጫ ወር ሥርዓት ተውጦ ስለነበርና የኛው በዓል በዚያ በመንግሥት በኩል ይካሄድ በነበረው ሥርዓት ተውጦ እንዳይቀር በማሰብ ለዘንድሮው ዓመት ብቻ በዛሬው ዕለት ማለትም ሰኔ 4 ቀን እንዲከበር ተደርጓል ። ለወደፊቱ ግን ያንኑ የተወሰነለትን የሚያዝያን ወር ይይዛል ።

በያመቱ የምናከብረው ይህ የኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች መታሰቢያ

ቀን እርስ በርሳቸው የተቆራኙ ሁለት ታላላቅ ቁምነገሮችን በማሰብና ምክንያት በማድረግ ነው ።

— አንደኛው ወደ ኮርያ የዘመተው ቃኘው ሻለቃ ጦር ይዞት የሄደውንና በማናቸውም ግዳጅ በጀግንነት ሙያ ያሸለመውን ሰንደቅ ዓለማ ከመሪው የተቀበለበትን ቀን ሲሆን ፤

— ሁለተኛውና በመታሰቢያነቱ ተመሳሳይ የሆነው ከፍተኛ መስዋዕትነት ከፍለው በጦር ሜዳው ላይ ሕይወታቸው ያለፈው የኢትዮጵያ ጀግኖች አጽም ወደ ሀገር ምድር ደርሶ በክብር ያረፈበትንም በዚሁ ቀን ደርቦ ለማክበር ነው ።

ይህንን ታላቅ በዓላችንን በምናከብርበትና አስበን በምንውልበት በዛሬው ቀን ወደ ኋላ መለስ ብለን ስንመለከት ያሳለፍነው ብዙ ውጣ ውረድ የተሞላበት የመከራና የደስታ ጊዜ በዓይነ ህሊና ይታየናል ። በዚህ በአለፉት ጊዜያት ውስጥ የተረሱትንና በሞት የተለዩን ወንድሞቻችንን ለአንድ አፍታ መለስ ብለን በጸሎት ልናስታውሳቸውና ልናስባቸው ይገባናል ።

ያለፉትን የታሪክ ወቅቶች ስንመለከት ብዙ ያሳለፍናቸው ችግሮች ከፊታችን ተደቅነው እናገኛለን ። የተረሳን ፤ የሚገባንን መብት የተነፈግን፡ ምንም ዓይነት ትኩረት ያልተሰጠን ነበርን ። ማኅበራችን በዓለም አቀፍ ታሪክ ውስጥ ትክክለኛውንና ተገቢውን ስፍራ ያልያዘ ነበር ። አሁን ግን ለኃያሉ እግዚአብሔር ምስጋና ይግባውና እንደቀሩት ሌሎች የኮሪየ ዘማቾች ሁሉ የሚገባንን መብት ለማግኘት መንገዱ ተከፍቷል ።

ማኅበራችን ከተቋቋመበት ጊዜ ጀምሮ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተሻሻለ መጥቷል ። በአሁኑ ጊዜ ከ1,500 አባላት በላይ አሉት ። የአባላቱ ቁጥር ከቀን ወደ ቀን እያደገ ነው ። ከዓለም አቀፍ ኮርያ ዘማቾች ማኅበር ፌዴሬሽንና ከ21 ኮርያ ዘማቾች ማኅበር ጋር የጠነከረ ግንኙነት ከማድረጉም ባሻገር የዓለም አቀፍ ድጋፍና እውቅናን ለማግኘት ችሏል ።

ባለፈው ዓመት በአምስተኛው የዓለም አቀፍ የኮርያ ዘማቾች ማኅበር ፌዴሬሽን ጠቅላላ ስብሰባ ላይ ለመሳተፍ ወደ ኮርያ ሔጄ እንደነበር ለጠቅላላ ጉባዔው ዘገባ ማቅረቤ ይታወሳል ። በዚህ ታላቅ ስብሰባም ላይ ማኅበራችን የዓለም አቀፍ ፌዴሬሽን አባል ለመሆን መብቃቱንም ገልጫለሁ ። የዓለም አቀፍ የኮርያ ዘማቾች ፌዴሬሽን

ማኅበር ፕሬዚዳንት የሆኑትን ሰር ዊሊያው ኪስንና የ21 አገር የኮሪያ ዘማቾች ማኅበር ፕሬዚዳንቶችን አግኝቼ በማነጋገሬ የነበረን ግንኙነት በይበልጥ ተጠናክሯል ። እንዲሁም ስለ ሌሎች ዘማቾች ማኅበር ለማወቅና ለመረዳትም ችያለሁ ።

ማኅበራችን እንዲያድግና ሌሎች ከደረሱበት እንዲደርስ ለማድረግ በጣም ጠንክረን መስራት ይኖርብናል ።

የቃኘው ሻለቃ ጦር በኮርያ የጦር ግንባር ላይ ሕይወትን መስዋዕት በማድረግ ያሳያቸው ወታደራዊ ሙያዎች እጅግ የተመሰገኑና የተደነቁ እንደነበሩ በወቅቱ በዓለም የዜና መድረኮች ሁሉ በሰፊው ሲወሱ እንደነበሩ የሚታወስ ነው ። ከዚያም አልፎ ሃገራችን ኢትዮጵያ ለዓለም ሠላም ያላትን ጽኑ እምነትና ቆራጥነት በደሙ ጽፎ ያስመዘገበ ነው ። በጀግንነቱም ቢሆን የቃኘው ሻለቃ ምንም ዓይነት ችግር ያለበት ጉዳይ ቢሆን ላመነበት ጽኑ ዓላማ ግንባሩን ፈጽሞ ከማያጥፍ ቆራጥ ከሆነው የኢትዮጵያ ሕዝብ ማህል የወጣ መሆኑን እንዲሁም በዘመኑ የወታደራዊ ሳይንስም ቢሆን የነቃና እጅግ የተራቀቀ እንደነበር በተግባር በየዕለቱ በታሪክ አስመዝግቦ ያለፈ ፣ በጠቅላላውም ከመሪው የተቀበለውን ሰንደቅ ዓላማ ለሶስት ተከታታይ ዓመታት ያሸለመ ፣ የኢትዮጵያም ባንዲራ በኩራትና በታላቅ ክብር ላቅ ብላ እንድትውለበለብ ያደረገ ሥነ ሥርዓት ዕውቀትና ጀግንነትን የተላበሰ እንደነበር የሚታወስ ነው ።

ይሁን እንጂ ይህን ሁሉ ድካምና ትግል ይህን ሁሉ መስዋዕትነት በወቅቱ የነበረውም ትውልድ ቢሆን ፣ ለብዙ ዘመን ያስታወሰውና ያሳሰበው ባለመኖሩ ረስቶታል ። አዲሱም ትውልድ የነገረውና ያስተማ ረው ባለመኖሩ አያውቀውም ።

ስለዚህ ማኅበራችን በሚቀጥሉት ዓመታት ከሚጠበቁበት ከፍተኛ ሥራዎች ማህል አንዱና ዋናው ፣ ይህ የተረሳ ከፍተኛ ታሪክ በዓለም መድረክ እንዲታወቅ ማድረግና በተለይም አዲሱ የኢትዮጵያ ትውልድ ይህን አኩሪ ታሪክ እንዲያውቀው በልቡም እንዲጽፈውና ከታሪኩም እንዲማር ማድረግ ይሆናል ።

እንደሚታወቀው ሁሉ ኢትዮጵያ በፋሺስት ኢጣሊያ ወረራ ደርሶ ባት የነበረው ዓይነት ግፍ በደቡብ ኮርያ ሕዝብ ላይ በመድረሱ ፣ በተባበሩት መንግሥታት ጥሪ መሠረት የኢትዮጵያ መንግሥት የቃኘው

# የክቡር የሪፐብሊክ ኮርያ አምባሳደር መልዕክት እንኳን ደስ አላችሁ



ክቡር ሚስተር ኮንግ ሳን ሱ፣

በኢትዮጵያ የሪፐብሊክ ኮርያ ኤምባሲ ሠራተኞችና በራሴም ስም ሆኜ የኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች በዓላችሁን ምክንያት በማድርግ በምታከብሩበት ዕለት ለመጀመሪያ ጊዜ ስላዘጋጃችሁት ሕትመት እንኳን ደስ አላችሁ እያልኩ ታላቅ ደስታዬን አገልጻለሁ።

ይህ መጽሔት ጠቃሚነቱና አዳሽነቱ እርግጠኛ ነኝ። በኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች ብቻ ሳይወሰን አሁን ያለውን የኢትዮጵያንና የኮርያን ወዳጅነት በበለጠ አጠናክሮ የሁለቱን አገሮች ግንኙነት ያስተሳስራል።

ምንም እንኳን የኮርያ ፔንሱላ (ሰርጥ) እስካሁን እንደተከፋፈለች ብትገኝም የሪፐብሊክ ኮርያ (ደቡብ ኮርያ) የሰላምና የነፃነት ፍቀር ባላቸው መንግሥታትና ሕዝቦች ኢትዮጵያንና ጠንካራውን ሠራተኛ የኮርያ ሕዝብ ጨምሮ እ.ኤ.አ. በ1950ዎቹ ዓመታት ውስጥ ከነበረው ጨለማ የኢኮኖሚው ተስፋ፣ ከዛያ አምስት ዓመታት በኋላ እጅግ በጣም ተስፋ ያለው ደረጃ ደርሷል።

የደቡብ ኮርያ ኢኮኖሚ በአሁኑ ግዜ በዓመታዊ ጠቅላላ ገቢ 12ኛና 13ኛ ዓለም አቀፋዊ ደረጃን ይዟል። በቀርቡ ከ10 በኢንዱስትሪ ከበለፀጉት ታላላቅ መንግሥታት መካከል አንደኛዋ ለመሆን ተቃርባ ለች።

የኮርያ የኢኮኖሚ ዕድገትና ልምድ ለሌሎች ታዳጊ መንግሥታት፣ ባለመማርና በችግር እየተሰቀዩ ላሉ አገሮች እንደ ምሳሌ (ሞዴል) ያገለግላል ብዬ አምናለሁ። በዚህም አኳያ የኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች

ሚኅበር በሁለቱ አገሮችና ሕዝቦች መካከል በትብብርና በጋራ ጠቀሚታ ዎች እንደ ድልድይ ሆኖ ማገልገል ይችላል።

በመጨረሻም በዚህ አጋጣሚ ለዚህ መጽሔት ዝግጅት አስተዋ ጽኦ ያደረጉትንና ኰሎኔል እምላዕሉ ወረደ የኢኮዘማ ፕሬዚዳንትን ጨምር ጥልቀ ምስጋናዬን እየገለጽኩ ጤንነትና ብልጽግናን ለኢትዮ ጵያ ኮርያ ዘማቾች እንዲሁም ለሁለቱም አገሮችና ሕዝቦች የጠነከረና የማያቋርጥ ወዳጅነትን እመኛለሁ።

አመሰግናለሁ



# በኢትዮጵያ የኮርያ ነዋሪዎች ማኅበር ፕሬዝዳንት መልዕክት

በኢትዮጵያ የኮርያ ነዋሪዎች ስም፤ ለኢትዮጵያ ኮርያ ዘማቾች ማኅበር፣ ለመጀመሪያ ግዜ ለታተመው መጽሔት እንኳን ደስ አላችሁ እያልኩ ምኞቼን አቀርባለሁ።

ይህም ሁኔታ በእርግጥ ማኅበሩ የተጣለበትን ኃላፊነትና አደራ በትክክል መወጣቱን ይገልጣል። ይህ መጽሔት በኢትዮጵያ ሕዝቦች መካከል ግንኙነትን እያጠናከረና እያሳደገ፤ የታሪክ ግንኙነቱን በኢትዮጵያና በሪፑብሊክ ኮርያ መካከል እንደሚመሠርት እርግጠኛ ነኝ።

የኮርያ ሕዝቦች ኢትዮጵያኖችን በተለይም እ.ኤ.አ. 1950ዎቹ ዓመታት በተባበሩት መንግሥታት ሰንደቅ ዓላማ ሥር በኮርያ በጦርነት ያደረጉትን ተሳትፎ እጅግ የሚያስታውሱት ነው። እንደዚህም ያለው መሠረተ ታሪክ በሁለቱ አገሮቻችን መካከል ያለውን መሠረታዊ ግንኙነቶች በበለጠ እንደሚያጠናክረው ጽኑ እመነቴ ነው።

የዚህም መጽሔት ዕድገት በሚቀጥሉት ዓመታት ሳይቋረጥ እንደሚቀጥልና፣ አንባቢያንም፤ ስለኮርያ ዘማቾች ማኅበር ፕሮግራምና እንቅስቃሴ የበለጠ ዕውቀት እንደሚያገኝ እምነቴ ነው።

በመጨረሻም ለኮሪያ ዘመቾች ማኅበርና አባሎቹ መልካም ምኞቴንና ለወደፊቱም ከፍተኛ ድል እመኛለሁ።

ኪም.ዶንግ.ኡክ. (ፕሬዚዳንት)
በኢትዮጵያ የኮርያ ነዋሪዎች ማኅበር

# መልዕክት ለኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች ማህበር
# ከሰር ዊሊያም ኪስ ኤሲ ኦቢኢ ኤምሲ
# የዓለም አቀፍ የኮሪያ ዘማቾች ፌዴሬሽን ፕሬዘዳንት

የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾችን ቀን በምታከብሩበት በዛሬው እለት በፌዴሬሽኑ ስም ሆኜ የጋለ ሰላምታዬን እንዳስተላልፍ እንዲፈቀድልኝ እጠይቃለሁ ።

በኮሪያ ምድረ ሰርጥ ሰላምን ለማስከበርና ለመጠበቅ አብረን በአንድነት ከተሰለፍን አያሌ ዓመታት ቢያልፍም ላለፉት ዓመታት ወዳጅነታችንና ወንድማማችነታችንን በይበልጥ ለያስተሳስር የሚያስ ችል የተደነቀ ግንኙነት ለመፍጠር ችለናል ። ይህ በወቀቱ በጦር ሜዳ የተገኘውን ወዳጅነትና ግንኙነት በይበልጥ እየጠነከረ እንዲሄድና ሁላችንም ለሰላምና ለብልጽ መቆም እንዳለብን የዓለም አቀፍ ፌዴሬሽን ፍላጐት ነው ።

የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘ0ማቾች ማህበር ተጠሪ በፌዴሬሽኑ ስብሰባ ላይ በመገኘቱ ከፍ ያለ ደስታ ተሰምቶኛል ። ለወደፊቱም ተጠሪያችሁ በየጊዜው በሚደረጉ ስብሰባዎች ላይ ተገኝቶ ፌዴሬሽኑን በተመለከተ ጉዳዮች ላይ አስተዋጽኦ እንዲያደርግ ፍላጐታችን ነው ።

እንደገና የጠበቀ ሰላምታዬንና መልካም ምኞቴን እያቀረብኩ በቅርቡ እንደምንገናኝ ተስፋ አደርጋለሁ ።

ሰር ዊሊያም ኬስ
ፕሬዘዳንት
የዓለም አቀፍ ኮሪያ ዘማቾች ማህበራት ፌዴሬሽን

# ርዕሰ አንቀጽ

## ፀሐይ ስትወጣና ስትጠልቅ

የአንድ ቀን የፀሐይ መውጣትና መጥለቅ፣ ከሕይወትና ከሞት ጋር ተፈጥሮያዊ ተመሳሳይነት አላቸው። በዚች ምድር እስካለን ድረስ በሕይ ወት ኅጠመኞች በየቀኑ ከሰው ልጆች ጭንቀት ጋር የሚከሰቱ ናቸው። የዚ ህም መጨረሻ ደረጃ ሞት ነው።

ይሁን እንጂ አስከትለን ስንመለ ከት ተፈጥሪያዊ የሆነ እውነተኛ ሒደት እናገኛለን፣ ማለት ሰዎች በሁ ለቱም መንገድ ታሪክን ይሠራሉ ይወርሳሉም፣ እንዲሁም የተወሰነ ውን ከኋላ ይተዋሉ። ጥቂት ቀደም ሲል የተገኙ ተግባራዊ ክንውኖች በሚከተሉት በሕይወት ዘመናት ሊረሱ ይችላሉ። ቢሆንም ታላላቅ ተግባሮች በእእምሮ ወስጥ ተቀር ጸው ስለማይረሱ ሁሉም በሕይወት ዘመኑ ይቀበላቸዋል።

የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾችና ሌሎች የሙያ ጓደኞቻቸው እ.ኤ.አ በ1950ዎቹ የመጀመሪያ ዓመታት በነጻነቱ በትክክል መኖር ስላለበት የደቡብ ኮሪያ ደህንነት ሲሉ በፈጸ ሙት ተጋድሎ በጋራ ያላቸው ስሜ ታዊ አስተሳሰባቸው በየአእምሮዋ ቸው ይቀረጻል። ይህም ልቦችን፣ ነ ፍሶችን ወደ ኋላ ትቶ የመጣ ታሪካዊ ግዴታ ነው። ለዚህም ነው በአሁኑ ጊዜ የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች ማህበ ርን ከድርጊቱ 40 ዓመት ተመልሶ ለማቋቋምና ለማስታወስ ምክንያት የሆነው። የመጀመሪያ ዓላማውም ይህን ክቡር የወታደራዊ ሙያና ገድል ለትውልድ ለማስተላለፍ ነው።

በቃኘው ሻለቃ ባልደረቦች የተከ ፈለው ክቡር መስዋዕትነት በሁለቱ አገሮች መካከል ላለው የተሳሰረ ወዳ ጅነት መሠረት ነው ቢባል ማደናቅ አይሆንም።

ምንም እንኳን የኢትዮጵያና የደ ቡብ ኮሪያ ወዳጅነት ቀደም ሲል የነበረ ቢሆንም የተባበሩት መንግሥ ታት ቻርተር ለሴኩሪቲ ኮሌክቲቭ ዓላማ የመሠረተው ከሁሉም በላይ ጠንካራና አዲሱ ግንኙነት ነው።

ኢኮዘማ ከባህር ማዶ ያሉት ወዳጆ ቻችን ኮሪያኖች ምንም ጊዜ ቢሆን ኢትዮጵያኖችን በዚያ መጥፎና አስ ከፊ የጦርነት ጊዜ ከጐናቸው የተሰለ ፉትን ማለት በሕይወት ያሉትን

በሞት ያለፉትን ከልብ እንደሚያስ ታውሷቸው በሚገባ ያውቃል።

በአሁኑ ጊዜ በሕይወት ያሉ የኢኮ ዘማ ለአባላት በአንድ ወቀት በአስ ከፊ ሁኔታ በጦርነት ላይ የነበረች ውና የተጐዳችው ደቡብ ኮሪያ ትልቅ ሆና ከመሪ ታላላቅ ሀብታም አገሮች ጎን ተሰልፋ ማየቱ ለኢኮዘማ አባላት ደስታና ኩራት ነው።

የኢኮዘማ አበላት በዚህ አጋጣሚ በአሁኑ ጊዜ ስላለው የኢትዮጵያንና የደቡብ ኮሪያን ግንኙነት አስደሳች ነቱን በኩራት ለመግለጽ ለዚህም መልካም አቀራረብ ክቡር የደቡብ ኮሪያን አምባሳደር እና ሌሎችም ወንድምና እህት ኮሪያኖች በአገር ውስጥም የሚኖሩም ሆነ ከውጭ ለሚመጡት ሁሉ ምስጋና ያቀርባሉ። እንደዚህም ያለው ሁኔታ ግንኙነታቸውን አጠናክሮ ሞራልም ከፍ የደርጋል ወደ ፀሐይ መጥለቂያ እያመራን ቢሆንም መንፈሱ አሁ ንም ሕብረታችንን ያሳፋዋል።

የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች አባ ላት፣ የተለያዩ ግበችን ነድፈዋል። ከነዚህም ዋናዎቹና አሳሳቢዎች የሚ ከተሉት ናቸው።

— ማህበራዊ የጤንነት አገልግሎት አባላቱ የማያገኙበት መንገድ

— የተጐዱና ደካማ ዘማቾችን አቅም በፈቀደ መጠን የመረዳት ዘዴን መፈለግ፣

— በሁለቱ አገሮች መካከል የለውን፣ ባህላዊም ሆነ ሌሎች የወዳጅነት መተሳሰሪያዎችን መጠበቅና ለትወ ልድ እንዲተላለፍ ማድረግ፣

እዚህ ላይ በግለጽ ማስቀመጥና መግለጥ የሚያስፈልገው በእነዚህ ኣላማቸው ግብ መምታት የሚቻለው ያለክቡር የኮሪያ አምባሳደርና ወዳጅ ኮሪያኖች ተሳትፎ አለመቻሉን ነው።

የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች ማህ በር በእግሩ እንዲቆም ከተፈለገ እነ ዚህ አስፈላጊ ነገሮች መሟላት ይኖር ባቸዋል። እኛም የኢኮዘማ አባላት እነዚህ ግቦች ግባቸውን እንዲመቱ የእኛና የማህበራችን አቅም በፈቀደ መጠን ጥረታችን አያቋርጥም።

# የማህበሩ አመሠራረትና እንቅስቃሴ

## የማኅበሩ መቋቋም ዓላማ

የኮሪያ ዘማቾች ማኅበር ሰኔ 1 ቀን 1984 ዓ.ም የማኅበሩ ጠቅላላ ጉባዔ በአደረገው ስብሰባ ባለው መመሥረቻና መተዳደሪያ ደንብ መሠረት ፀድቆ ተቋቋመ።

ዓላማው የዘመቻውን ታሪካዊ ውጤት፣ በኮሪያ ጦር ሜዳ የተገኘውን ድል፣ በጦር ሜዳው የተከፈሉትን፣ የወደቁትን፣ ለማስታወስና ታሪካቸውን ተከብሮ እንዲኖር ለማድረግ። የዘማቹ ማኅበርተኛ ተከታታይ ትውልድ፣ የወላጆቹን ታሪካዊ ፈለግ ተከትሎ ማኅበሩ ቀጣይነት እንዲኖረው ለማድረግ። ከውጭ አገር አባል ማኅበራት ጋር የጠበቀ ግንኙነትና ወዳጅነት ለመመሥረትና ለመተባበር። ማኅበሩ ከአባላቱ ከመሰል ማኅበራት፣ ከደጋፊዎች፣ በሚያገኘው ገንዘብና ማቴሪያል፣ ከማህበርተኛው የችሎታ፣ የጉልበት ድጋፍ ጋር በማስተባበር ለማኅበርተኛው ዘላቂ ጥቅም ለማስገኘት የሚያስችል እድል ለመክፈት ነው።

## <u>የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ አባላት</u>

| | |
|---|---|
| ፕሬዝዳንት | እንጅ/ኮሎኔል እምላዕሉ ወረደ ቢ.ኤስ.ኢ.መኢ. |
| ም/ፕሬዝዳንት | መ/አ አበበ ጌታነህ |
| ዋና ፀሐፊ | የመቶ አለቃ እሸቱ አያና |
| የፋይናንስ ኃላፊ | ኮሎኔል ሙሉጌታ መኩሪያ |
| የሕዝብ ግንኙነት ኃላፊ | ሻምበል ይልማ በላቸው |
| ገንዘብ ያዥ | ባሻ ወ/አማኑኤል ወ/ኢየሱስ |
| ም/ዋና ፀሐፊ | አቶ በቀለ ወ/ጊዮርጊስ |
| ም/የፋይናንስ ኃላፊ | የመቶ አለቃ ታደሰ ወ/ክርስቶስ |
| ም/የሕዝብ ግንኙነት ኃላፊ | የመቶ አለቃ ሠይፉ ተሰማ |
| ም/የገንዘብና ንብረት ኃላፊ | የመቶ አለቃ ዘውዱ ዓለማየሁ |

## የማህበሩ ምክር ቤት

የማኅበሩ ምክር ቤት አባላት አሥር የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ አባላትንና 25 ከጠቅላላው አባላት የተመረጡትን ያጠቃልላል። ም/ቤቱም የማኅበሩን ሥራ ለማከናወን በየሶስት ወሩ ይሰበሰባል።

## ጠቅላላ ጉባኤ

ጠቅላላ ጉባዔ፤ የማኅበሩ ከፍተኛ የሥልጣን አካል ሲሆን፤ የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች ማኅበር አባላት የሚገኙበት በዓመት አንድ ጊዜ የሚደረግ መደበኛ ስብሰባና በተለየ ምክንያት የሚጠራ አስቸኳይ የጠቅላላ ጉባዔ ስብሰባ ነው።

## ዋና ተቆጣጣሪ

| | |
|---|---|
| ዋና ተቆጣጣሪ | ሻምበል ማሞ ሀብተወልድ |
| ም/ዋና ተቆጣጣሪ | አቶ አሰፋ ደምሴ |

## ማህበርተኛ

በማኅበሩ ደንብ መሠረት ኮሪያ የዘመተ ሁሉ አባል ነው። ማኅበሩ በአሁኑ ጊዜ ከ1,500 አባላት በላይ አሉት።

## የአባልነት የገንዘብ መዋጮ

እያንዳንዱ ማኅበርተኛ ለመጀመሪያ ጊዜ የመመዝገቢያ የኢትዮጵያ ብር 5፤ ወርሃዊ መዋጮ በየወሩ አንድ ብር ይከፈላል።

## የገንዘብ ገቢ

የማኅበሩ የገንዘብ ምንጭ ከማህበርተኛ የሚሰበሰበው ወራዊ መዋጮና ከእርዳታ ሰጪዎች የሚገኝ ገንዘብ ነው። ማኅበሩ በኢትዮጵያ ንግድ ባንክ ስላሴ ቅርንጫፍ ሂሳብ አለው።

## ብሔራዊ በዓል

የኮሪያ ዘማቾች ማኅበር ሐምሌ 25 ቀን 1985 ዓ·ም የኮሪያ ጦርነት የቆመበትንና በኮሪያ ጦር ሜዳ የሞቱት ጀግኖች አፅም ወደ እናት አገር ተመልሶ በክብር ያረፈበትን ቀን በቅድስት ሥላሴ ቤተክርስቲያን አክብረዋል። በዚሁ ሥነ ሥርዓት ላይ የኢኮዘማ ፕሬዝዳንትና በኢ· ኮሪያ አምባሳደር አበባ በጀግኞች መቃነመቃብር ላይ አኑረዋል። በዓሉን በተመለከተም ንግግር አድርገዋል።

## ጉብኝት

የኰሪያ ዘማቾች ማኅበር ፕሬዝዳንት እንጅ/ኮሎኔል እምላዕሉ ወረደ በዓለፈው ዓመት ወደ ኮሪያ በመሔድ በ5ኛው የዓለም አቀፍ የኮሪያ ዘማቾች ማኅበር ፌዴሬሽን ጠቅላላ ስብሰባ ላይ ተገኝተዋል። ከጦርነቱ ወዲህ ወደ ኮሪያ በመሔድ የመጀመሪያው የኮሪያ ዘማች ማኅበር ፕሬዝዳንት ሲሆኑ ማኅበሩም በዚሁ ስብሰባ ላይ የፌዴሬሽን አባል ለመሆን በቅቷል።

## ማኅበሩ ከኮሪያ ኤምባሲ ጋር ያለው ግንኙነት

ማኅበራችን ከኮሪያ ኤምባሲ ጋር ያለው የሥራ ግንኙነት እጅግ የሥ የበረታታ ነው። በተለይ የኮሪያ አምባሳደር ሚስተር ኮንግ ሳን ሱፕና ሌሎች የኤምባሲው ሠራተኞች ለማኅበራችን ስለሚያደርጉት እርዳታና ትብብር ማኅበሩ ከፍ ያለ ም ስጋናውን ያቀርባል።

## ማኅበሩ ከሌሎች ማኅበሮች ጋር ስላለው ግንኙነት

ማኅበራችን ከሌሎች 21 ኮሪያ ዘማቾች ማኅበርና ፌዴሬሽን ጋር ያለው ግንኙነት እጅግ የጠነከረ ነው ። በዚሁ መሠረት ግንኙነቱም በይበልጥ እየጠነከረ እንዲሔድ አስፈላጊውን ያላሰለሰ ጥረት ማኅበሩ ያደርጋል ።



የኮሪያ ዘማቾች ማህበር ም/ፕሬዘዳንት መ/አ አበበ ጌታነህ ከሌሎች አባላት ጋር በግንባር ቀደምትነት ማህበሩን የመሠረቱና ያሰባሰቡ ለዚህ ደረጃ ያደረሱ ታሪክ ሊያስታውሳቸው የሚገባ ባለውለታና ሊመሰገኑ የሚገባቸው ናቸው ።

**I.t. Abebe Getaneh the Vice President of the Korean War Veterans Association along with other members is the front line founder of the Association, All due credit must go to him for seting up and organizing the Korean War Veterans Association. He deserves to be thanked:**

ይህ ፎቶግራፍ የሚያሳየው የኢኮዘማ የሥራ አስፈፃሚ ኮሚቴ አባላትን ነው ።
**This Photo shows the executive committee members of the Korean War Veterans Associations**



**ይህ ፎቶግራፍ የሚያሳየው የኢኮዘማ ምክር ቤት አባላትን ነው**
**This Photo shows the Council Conmmittee members of the Korean War Veterans Associations**



ይህ ፎቶግራፍ የሚያሳየው የኢኮዘማ የጠቅላላ ጉባኤ አባላትን ነው ።
This Photo shows the General Assembly of the Korean War Veterans Association.

# ኢኮዘማ

ኢኮዘማ — የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች ማህበር ከአርባ አራት ዓመት በፊት ለሰኩሪቲ ኮሌክቲቭ ዓላማ "እልም አለ ባቡሩ ፣ ወጣት ይዞ በሙሉ" ተብሎ የተዘፈነላቸውና ወደ ጦር ሜዳ የዘመቱት የቃኘው ሻለቆች የሚጠሩበት ከአርባ ዓመት በኋላ የተመሠረተ የዕውነተኞች ጀግኖች መሰብሰቢያ ነው ።

ኢኮዘማ — አባላት ጠቅላላ እንቅስቃሴና ገድል በዓለም ደረጃ ከፍተኛ የታሪክ ፀሐፊዎችና የታወቁ የጦር መሪዎች አድንቀው የላቀ ደረጃ የሰጡት ብዙም የመሰከሩለት ፣ ሐውልትም ያቆሙለት ፣ በአገሩ ላይ በተወሰነ መልኩ የተደነቀ ፣ በጣም በትንሹ የተጻፈለት ፣ በአሁኑ ጊዜ ታሪክን በመድገም ላይ ያለ የአዛውንት አባላትና ተተኪዎች ማህበር ነው ።

በአሁኑ ወቅት ታሪክን እንደገና በማስተካከል ፣ የማያውቁት እንዲያውቁት ጥረት የሚያደርግ ፣ መልካም የጀግንነት ስሙን ለልጅ ልጆቹ ለማስተላለፍ የተዘጋጀ የኢትዮጵያ ዕውነተኛ ልጆች መጠሪያ በወታደርነት ሙያ ከባህር ማዶ ዘልቆ ተወዳድሪ የሌለው ዝናንና ክብር ያገኙት፣ የክብር ዘበኛ የቃኘው ሻለቆች መጠሪያና ከፍተኛው ኢትዮጵያ የታሪክ ሰነድ ነው ።

የኮሪያ ዘማቾች ማኅበር ፕሬዘዳንት በኮሪያ ጦር ሜዳ በሞቱት የኢትዮጵያ ጀግኖች አጽም ላይ
ጉንጉን አበባ ሲያኖሩ

በአበባ ማስቀመጥ ሥነሥርዓት ላይ



# ኢትዮጵያ፣ ኮሪያና የተባበሩት መንግሥታት

እነዚህን ሁለት አገሮችና ዓለም አቀፍ ማህበሩን ያገናኘ ከአርባ አምስት ዓመት በፊት አንድ የታሪክ ምዕራፍ ነበር ። ይህንኑ እውነተኛ ታሪክ አገሪቱ ትከተል በነበረው የአይዲዮሎጂና የአስተሳሰብ አቅጣጫ ትክክለኛነቱን ሊያዛቡት ወይም ሊያዘሙት ቢሞክሩም እውነት ውሉን አይረሣምና መድረኩን ተረክቧል ።

በመሆኑም በተለይ በአገራችን የስነጽሑፍ ሰዎች በኩል ትኩረት ሳያገኝ እስካሁን ይገኛል። ይሁን እንጂ በእኛ በኩል የተዘነጋውና የተረሣው ታሪክ በውጭ አገር ደራሲያን በኩል ብዙ የተነገረለትን፣ ኢትዮጵያዊ የታሪክ ሠነድ፣ ለወደፊቱ በበለጠ እንደሚያዳብሩት በወገን ደራሲያን ሙሉ ተስፋና እምነት በማድረግ፣ ብአጀማመሩ እስካለንበት አጠር ባለ መልኩ የሚከተለውን ማስታወሻ አቅርበናል።

<u>የኮሪያ ጦርነትና መንስኤው</u>

የኮሪያ ጦርነት ዋና መንስኤው፣ የሁለተኛው የዓለም ጦርነት እንደተገባደደ በአይደሎጂ ልዩነት ለሁለት የተከፈለችው ኮሪያ፣ በ38ኛው ፓራሌል መስመር ላይ ሰሜንና ደቡብ ተብላ ተሰየመች... በዚህም ኮሚኒስቱና የምዕራብ ዓለም ልዩነቱ እየሰፋ መጣ።

የሰሜን ኮሪያ በኮሚኒስቱ ዓለም ሥር ሆና ትተዳደር ስለነበረች፣ የሶቪየት ሕብረትና የኮሙኒስት ቻይና ድጋፍ ነበራት። በዚህም የተነሣ የሶቪየት ሕብረት የሰሜን ኮሪያን የጦር ኃይል በማቋቋም ፣ በማስታጠቅና

የውጊያ ብቁነቱን ከፍ ለማድረግ ወታደራዊ ስልጠና ታደርግ ነበር። ይህም የጦር ዝግጅት ዓይነቱና ዓላ ማው የነፃው ዓለም ሕዝብ ሳያውቅ ጠና ሳይገነዘበው እንዲሁም ሰምቶት ለዕርዳታ እንዳይደርስ አድብታ በደ ቡብ ኮሪያ ላይ ድንገተኛ ወረራ በማ ድረግ፣ በአጭር ጊዜ ውስጥ በቁጥጥር ሥር ለማድረግ ነበር።

በታቀደው መሠረት እ.ኤ.አ. እሁድ ጠዋት ሰኔ 25 ቀን 1950 ዓ.ም. በ0400 ሰዓት ላይ የሰሜን ኮሪያ ጦር በሶቪየት ሕብረት በተሠሩ ከባድ መድፍና ቲ34 ታንክ እየተረ ዳች በ38ኛው ፓራሌል መስመር ላይ የተሠለፈውን ታንክና መድፍ እንዲ ሁም ፀረ ታንክ የሌለውን ለጦርነት ሳይሆን ለፀጥታ ጥበቃ በተደራጀው በደካማው የደቡብ ኮሪያ ጦር ላይ ድንገተኛ ወረራ አደረገች።

ይህም በጥበቃ ላይ የነበረው ጦር፣ ተደራጅቶና ታጥቆ የመጣውን ግዙፍ ኃይል ለመመከት ባይችልም.. ወዲያና ወዲህ እየተሯሯጠ ለመግ ታት ሳይሆን ለማዘግየት ከፍተኛ መስዋዕትነት ከፈለ።

ባለው ጠንካራ ኃይልና በታጠ ቀው መሣሪያ ተማምኖ ያጠቃው ወራሪ ኃይል እንዳሰበው ድንገተኛ ወረራውን ነፃው የዓለም ሕዝብ ሳይ ነቃ ለዕርዳታ ከመድረሱ በፊት እ.ኤ.አ ሰኔ 28 ቀን 1950 ዓ.ም. የደቡብ ኮሪያን ዋና ከተማ ሴውልን ያዘ።

ከዚያም ውጊያን በማስፋት ሐምሌ 13 ቀን 1950 ዓ.ም. የኩም ወንዞን መስመርንና ሐምሌ 20 ቀን 1950 ዓ.ም ቴጆንን ያዘ።

ከዚህ በኋላ ሰሜን ኮሪያ በኮሚኒ ስቱ እየታገዘች ደቡብ ኮሪያን በመው ረሯ በሁለቱ ታላላቅ ዓለም መንግሥ ታት መካከል ትልቅ ውዝግብ ተፈ ጠረ።

### ሴኩሪቲ ኰሌክቲቭ

የዓለም መንግሥታት ማህበር በሁኔታው አሳሳቢነት የቃል ኪዳን ጥሪ አደረገ ኢትዮጵያ የቀድሞው የዓለም መንግሥታት ማህበር፣ አባል ነቷ በፋሺስት ኢጣሊያ፣ የደረሰባትን ሕገ ወጥ ወረራ ለዓለም ሸንጎ ማቅረ ቧንና የወራሪንና የተወራሪን፣ ሁኔታ በሚገባ በመገንዘብ አሁንም በአዲሱ የተባበሩት መንግሥታት መሥራች አበልነቷ፣ የዓለም መንግሥታት ቃል ኪዳን ጥሪን ያለማወላወል በደ ስታ ተቀበለች።

በቀድሞው የዓለም መንግሥታት ማህበር ሊግ አፍ ኔሺን በኢትዮጵያ ላይ ያሳየውን ቸልተኝነት አስመል ክቶ ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በጄኔቭ ያቀረቡት አቤቱታ ኢትዮጵ ያን በበለጠ ያሳወቀ የአፍሪካውያንን

የዲፕሎማሲ ብስለት ያስመሰከረ በአዲስ መልክ ለተቋቋመው የተባበሩት መንግሥታት ማህበር ልምድን ያጐናፀፈ መሆኑ ይነገርለታል። ካደረጉት ንግግር ውስጥ አጭር ቃል ብንጠቅስ "እግዚአብሔርና ታሪክ ለምትሰጡት ፍርድ፣ ምስክር ሆነው ይመለከታሉ" የሚል ይገኝበታል።

የተባበሩት መንግሥታት ቃልኪዳን በማህበሩ መተዳደሪያ አንቀጽ 51 መሠረት ለሴኩሪቲ ኮሌክቲቭ ዓላማ ኢትዮጵያ ከሌሎች መንግሥታት ጦሮች ጋር የአሜሪካን መንግሥት በሚያስተባብረው የጦር ግንባር መሰለፏን የሚያረጋግጠው ይህ ስምምነት ነው።

የተባበሩት መንግሥታት ሴኩሪቲ ካውንስል ወረራውን እንደሰማና እንተረዳ በተደጋጋሚ ባሳለፈው ውሳኔዎች ወራሪው ጦር ውጊያውን እንዲያቆም ቢያሳስብም ቢያወግዝም ሰሚ በማጣቱና ወራሪው በመቀጠሉ የተባበሩት መንግሥታት ሴኩሪቲ ካውንስል እ.ኤ.አ. ሰኔ 27 ቀን 1950 ዓ.ም. የተባበሩት መንግሥታት ቃልኪዳን አባል አገሮች ለደቡብ ኮሪያ መንግሥት ወታደራዊ አርዳታ እንዲያደርጉ ጥሪ አስተላለፈ።

እ.ኤ.አ ታህሣሥ 12 ቀን 1948 ዓ.ም. ለኮሪያ ሪፑብሊክ መንግሥት በፓሪስ ላይ በተደረገው ስብሰባ የተባበሩት መንግሥታት ጠቅላላ ጉበኤ በኮሪያ ሠርጥ /ፔኑንሱላ/ ብቸኛና ሕጋዊ ዕውቅና ያገኘች በመሆንዋ የነፃው ዓለም ወዲያውኑ ለእርዳታው አፋጣኝ መልስ ሰጠ።

የተባበሩት መንግሥታት አባል አገሮችም ወራሪውን ጦር ለመከላከልና፣ ሰላም ለመመሥረት፣ ወታደራዊ ዕርዳታ ወደ ደቡብ ኮሪያ መላክ ጀመሩ። ከነዚህም ውስጥ አንዷ ኢትዮጵያ ነበረች።

ኢትዮጵያ የኢጣሊያ ፋሺስት በግፍ በወረራት ወቅት እርዳታ እንዲደረግላት ለቀድሞው ሊግ ኦፍ ኔሽን አቤቱታዋን ባቀረበችበት ጊዜ ጩኸትዋን ያዳመጣትና ድርጊቱንም ያወገዘ ጣልቃ ለመግባትም ሙከራ ያደረገ አንድም አባልና የዓለም ህብረተሰብ አልነበረም።

ስለሆነም ኢትዮጵያ ይህ ደርሶባት የነበረው ወረራና ችግር በደቡብ ኮሪያ እንዳይደገም፣ ግንዛቤ ውስጥ በማስገባት እ.ኤ.አ. ሚያዚያ 12 ቀን 1951 ዓ.ም. ከክብር ዘበኛ ሠራዊት "ቃኘው ሻለቃ" በሚል ስያሜ ጦርዋን ወደ ኮሪያ አዘመተች ።

የ1ኛው ቃኘው ሻለቃ በአዲስ አበባ ከተማ ጃንሜዳ ላይ ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በተገኙበት እጅግ ቁጥሩ የበዛ ሕዝብ በተካፈለ



የቃኘው ሻለቃ ከግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሰንደቅ ዓላማ ሲቀበል

በት ደማቅ የክብር አሸኛኘት ተደር ጐለታል። ይኸንንም አሸኛኘት አስ መልክቶ በዕለቱ ግርማዊ ቀዳማዊ ኃ.ሥ. ከተናገሩት ሰንደቅ ቃል እንጠ ቅሳለን።

"እናንት ወታደሮች! የዓለም መንግ ሥታት ማህበረተኞች የሆኑ መንግ ሥታት፡ ሁሉ ለማክበር ግዴታ ለገቡ ባቸው መሠረታዊ ነገሮችና ለነፃነት ለመከላከል ለምን ግማሽ ጐዳና አቋርጣችሁ ለመሄድ ተዘጋጅታች ኋል።

መሣፍንቶቻችን ሚኒስትሮቻችን መኮንኖቻችንና ለዚህም ታሪካዊ ለሆ ነው ሥራ በየበኩላቸው ተካፋይ የሆኑ የሌሎችም መንግሥታት እንደ ራሴዎች ባሉበት ፣ ክብር እንዲደረግ ላችሁ ራሳችን መጥተን መልዕክታች ሁን እግዚአብሔር እንዲያቃናላችሁ ያለንን ምኞት ልንገልጽላችሁ እና ይኸንንም የጦር መለዮ ልንሰጣችሁ በዚህ መገናኘት ፈቀድን።

ይህን የጦር መለዮ ፣ ዓላማ፣ በምታ ደርጉት ጦርነት ሁሉ በጀግንነት ከፍ

አድርጋችሁ ትይዙታላችሁ። ከጦርነቱም መጨረሻ በኋላ በጀግንነትና በጀብዱ ሥራችሁ ለታማኝነታችሁ ቃል ኪዳን ለገባችሁልን ለእኛ ለንጉሠ ነገሥታችሁ ለጦር ሠራዊት ጠቅላይ አዛዣችሁ እንደገና መልሳችሁ እንደምታስረክቡን እንተማመናለን።'' ብለው አሰናበቱ።

## የቃኛው ሻለቃ ዘመቻና ገድል!

የቃኘው ሻለቆች መዝመት ወይም ወደ ደቡብ ኮሪያ ጦር ግንባር መላክ ዋናው ምክንያት፣ የአጥቂን ጨካኝነት የተጠቂን ጉዳት ከማንም በበለጠ የምታውቀው ኢትዮጵያ በመሆንዋ በተባበሩት መንግሥታት አባልነትዋ የአገር ዕርቀትና ወሰን ሳያግዳት የዓለም መንግሥታት ማህበር ድምጽ በዓለም ሁሉ የሚሰማ ነው በማለት ፣ እ.አ.አ. ሚያዚያ 12 ቀን 1951 ዓ.ም ጀምሮ ከስመጥሩ የክብር ዘበኛ ሠራዊት ቃኘሁ በሚል ስያሜ በተከታታይ ወደኮሪያ ጦር መላክ ጀመረች።

ከተላኩትም አንደኛ ቃኘው ሻለቃ፣ ሁለተኛ ቃኘው ሻለቃ፣ ሦስተኛ ቃኘው ሻለቃ አራተኛው የቃኘው ሻለቃና አምስተኛ ቃኘው ሻምበል ዋና ዋናዎቹ ናቸው። ጦርነቱ ከቆመ እ.ኤ.አ. ከ1953 ዓ.ም. በኋላም ትጥቁን ያልፈታ ጦር ምንጊዜም ተዘጋጅቶ ሲጠብቅ በመልሶ ግንባታና በማቋቋም ተግባር ከጉልበት እስከ ገንዘብ መስጠት ቀጥታ ተሳትፎ ተደርጓል። በስተመጨረሻም በተጠሪነት ደረጃ አባሎቻችን ቆይተዋል።

የቃኘው ሻለቆች በተሠማሩበት የጦር ግንባር ሁሉ በማጥቃት ጊዜ የተሰጣቸውን ግብ በመያዝ፣ በመከላከልም ጊዜ አንድ ጋት መሬት እንኳን ለጠላት ሳይለቁ በጀግንነት ተዋግተዋል። በመሆኑም በኮሪያ ጦር ሜዳ ታላቅ ክብርና አድናቆትን አግኝተዋል።

በቃኘው ሻለቆች የኢትዮጵያ ሕዝብ በጣለባቸው አደራና እምነት በኮሪያ ጦር ግንባር አኩሪ የጀግንነት ሙያ በመፈፀማቸው፣ የኢትዮጵያን ሕዝብ የጀግንነት ሙያና ታሪክ በተባበሩት መንግሥታት የታሪክ መዝገብ ውስጥ በወርቅ ቀለም አስመዝግበዋል።

ወደ ኮሪያ የተላኩት የቃኘው ሻለቆች ኮሪያ በነበሩበት ጊዜ የጦር ቃል ኪዳን ጓዶች ብቻ ሳይሆኑ በጠላትም በኩል የተደነቀላቸውና ከፍተኛ አክብሮት የተሰጣቸው በተለይም በፈፀሟቸው ጦርነቶች ውስጥ በሕይወት ያለው ይቅርና አንድም የሞተ ኢትዮጵያዊ ሬሣ እንኳን አለማስማረካቸው ነው።

የቃኘው ሻለቆች በየጊዜው ከጠላት



ፕሬዘዳንት ሲንግ ማንሪ የቃኘው ሻለቃን በኮሪያ ጦዛን አቀባበል ሲያደርጉላቸው

ባር ለግንባር ገጥመው፥ ባደረ
ፍተኛ የጨበጣ ውጊያ፥ የላቀ
ት ሙያ በመፈፀማቸው፥ የሠ
ህብረት ውጊያ፥ (ዩኒት ሳይቴ
ልማት፥ ከአሜሪካንና ከኮሪያ
ት በተደጋጋሚ ተሸልመ
ህም ሽልማት ከፍተኛ የህብ
ንነት ለፈፀሙ ብቻ የሚሰጥ
ነው።

የአንድ ጦርነት ድል ውጤት የሚ
ገኘው በህብረት ውጊያ በመሆኑ
ኢትዮጵያ በጦር ግንባር ጀግኖችዋ
ደማቸውን አፍስሰው አጥንታቸውን
ከስክሰው በከፈሉት የሕይወት መስ
ዋዕትነት የአዲሲቱ ኮሪያ ነፃነት ዋስ
ትና አግኝቶ አሁን ያሉበት ከፍተኛ

MOVEMENT OF ETHIOPIAN BATTALION (MAY 1951~JUL 1953)




ደረጃ ደርሶ ማየቱ የቃኘው ሻለቆች የሕሊና ደስታ ነው።

ግዳጆች

የቃኘው ሻለቆች በኮሪያ ጦር ግንባር ብዙ ዓይነት የውጊያ እንቅስቃሴዎች አድርገዋል። መዘርዘርም ያስቸግራል። ከነዚህ ውስጥ፣

ዋና ዋና ጦርቶች 253

ከፍተኛ የሕብረት ውጊያዎች 5

መጥቀሱ ... በቂ ነው። እነዚህም በኮሪያ ታሪክ ውስጥ ከሌሎች መንግሥታት የውጊያ ውጤቶች ጋር ተመዝግበዋል።

የመስዋዕትነት ክፍያ

የቃኘው ሻለቆች በተከታታይ ጦርነቱ እስከቆመ ድረስ የዘመቱት ከአራት ሺህ በላይ ሲሆን እስከ መጨረሻው የዘመተው ጦር 6037 ነው።

ከዚሁ ውስጥ፣ የቆሰሉ 536

የሞቱ 123 ሲሆኑ

ከኢትዮጵያ ሠራዊት የጠፋ ወይም በጠላት የተማረከ የለም።

## የድል መልስ

የቃኛው ሻለቆች ከፈፀሟቸው አኩሪ ድሎች በኋላ ሐምሌ 29 ቀን 1946 ዓ.ም. በኮሪያ ጦር ሜዳ በጀግንነት ሲዋጉ የወደቁትን የ123 ጀግኖችን አጽም የ3ኛ ቃኘው ሻለቃ ይዞ አዲስ አበባ ገባ። የእያንዳንዱ የጀግና አጽም በመዳብ ሣጥን ሆኖ በክብር ታጅቦ ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ታላላቅ ሰዎች እጅግ ብዙ ሕዝብ ባለበት አዲስ አበባ ቅድስት ስላሴ ቤተስርስቲያን ደርሶ ታላቅ አቀባበል ተደርጎለት በክብር ቦታ አርፏል። ዕለቱን ምክንያት በማድረግ ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከተናገሩት ሠፊ ንግግር በአጭሩ እንጠቅሳለን። "ለዓለም ሰላም ለመከላከል፣ ወደመጨረሻው ምሥራቅ የጦር ግንባር ስንልካችሁ በክብር እድሸኘናችሁ፣ የሥራውን መልካም ፍሬ ተጎናጽፎ ወደ አገሩ የተመለሰውን አጽማችሁን በክብር ተቀብለን በዚህ ቦታ እናኖረዋለን። ደግሞም የሴኩሪቲ ኮሌክቲቭ ዘዴ ሊታመንበት የሚያስችለው፣ ጀግኖች ወታደሮቻችን ተከፋዮች በሆኑበት በኮሪያ ጦርነት ተገልጦ ታየ። በዚህም የተገኘው የሰላም ብርሃን ዛሬ አጽማቸው በፊታችን በሚገኘው በነዚህና እነዚህንም በመሰሉ በጦርነቱ ተካፋዮች በሆኑ የተባበሩት መንግሥታት ጀግኖች ወታደሮች፣ መስዋዕትነት ነው። ለዚህም ሰላም ድል ምክንያት የሆኑ፣ ከእኛ በሕይወት የተለዩ፣ ጀግኖች፣ ሁሉ መስዋዕትነታቸው የሰጠውን መልካም ፍሬ በመንፈሳቸው በመመልከት ከእኛ ጋር እንዳሉ እንቆጥራቸዋለን።

## ምስክርነት

ለቃኘው ሻለቆች የተልዕኮ ውጤትና የሙያ ብቃት ምስክርነት እጅግ ብዙ መሪዎች የጦር ሊቃውንቶች የታሪክ ሰዎች ወዘተ በብዛት ከመሰከሩት ውስጥ ለዋቢ ያህል ሁለቱን እንጠቅሳለን።

## ጀኔራል ዲ ዋይት አይዝንሐዎር የአሜሪካን ፕሬዜዳንት ኮሪያ በሄዱበት ጊዜ ለቃኘው ሻለቃ የሰጡት ምስጋና

ስለቃኘው ሻለቃ ጀግንነትና ከፍ ያለ ጀብዱ ከብዙ የአሜሪካንና ከቀሩትም የዓለም ጋዜጦች እንደሰማሁትና እንደተረዳሁት፣ ደግሞም ጄኔራል ማርክ ክለርክ ባቀረቡልኝ ጠቅላላ ሪፖርት ውስጥ እንዳገኘሁትና እንዳጠናሁት ሁሉ፣ ዛሬ ደግሞ በመካከላችሁ ተገኝቼ እናንተን ቆራጥ የሆናችሁትን ፣ ጀግኖች መጥቼ በዓይን ለማየት በመታደሌ ከፍ ያለ ኩራትና ክብር ይሰማኛል። በተለ

ይም በሴኩሪቲ ኮሌክቲቭ ፕሪንስ ፕል ላይ በታመኑት በንጉሠ ነገሥታ ችሁ ትዕዛዝ እጅግ ሩቅ ከሆነው ከኢትዮጵያ መጥታችሁ አገራችሁን በታሪክ ለዘለዓለም አኩሪ የሆነውን የጦር ሜዳ ሥራ በመፈፀማችሁ መላው ዓለም ስለከፍተኛው ንጉሠ ነገሥታችሁና ስለ እናንተም ከሚሰ ማው አድናቆት ጋር የእኔም አድና ቆት ተባባሪ ሆኖ የሚገኝ ነው።

<u>የጄኔራል አርተር ጂ.ትሩዶ ደብ ዳቤ</u>

የጀግንነታችሁና፣ የቆራጥ ሰውነ ታችሁን ፣ የፍጹምነታችሁን መን ፈስ ነፃ በሆነው የዓለም ጦረኞች ዘንድ ታሪካችሁ ከፍተኛውን ደረጃ ይይዛል። በጦር ሜዳ ፍጹም ቆራጥ ጀግኖች ናችሁ። በአስተደደርም ሥራ ፍፁም ትክክለኛ ናችሁ። በመ ምራትም እንከን የለባችሁም።

ስለዚህ የተሰጣችሁ ሥራ ሁሉ፣ በትክክል አከናውናችሁ የጀግንነት ተግባራችሁን ፈጽማችሁ በመገኘታ ችሁ በዓለም ሁሉ ላይ በወታደር ድርጅት ከታወቁት ታላላቅ ባለታሪ ኮች ጋር የቃኘው ሻለቃ ጦር ጀግን ነት አንዱን የታሪክ ረድፍ ይዞላች ኋል። የቃኘው ሻለቃ ጦር ሙያ ከነጀ ግንነቱ በሁሉም ሰው ልብ ተቀርጾ የሚኖርና ታላቅ መታሰቢያነት ያለው ነው ስንል እንዲህ ያለውን አደጋ የሚችል ከዚህም በበለጠ መሥዋዕትነት፣ የሚሆንና ፊቱን የማ ይመልስ ተብሎ ያለቀለት ፍፁም ጀግና የቃኘው ሻለቃ ጦር ነው ። በማለት ንግግሬን እወስናለሁ።

ንግግሮቹ የተወሰዱት ከጠቅልና ሠራዊቱ መጽሐፍ ውስጥ ነው።



ከኮሪያ መንግሥት የኢትዮጵያ ሰንደቅ ዓላማ የሕብረት ውጊያ ሽልማት ሲቀበል



ከአሜሪካን መንግሥት የኢትዮጵያ ሰንደቅ ዓላማ የኀብረት ውጊያ ሽልማት ሲቀበል

# ቃኘው በኮሪያ

ቃ ኘው በኮሪያ በሙያው ተባር ኮ
የኢትዮጵያ ዥግና ለሰላም ተልዕኮ
ሰላም እምቢ ብሎ ቢመጣ አልክልኮ
መትሮ ለቀመው ከመሬት አስታኮ
ኘ 'ን' አስከተለና "ቃ" በማስቀደም የጦሩ መርማ ሪ
ቃኘ ዳር ድንበሩን ሊቀጣ ወራሪ
ዝናውም ተሰማ ጠላት በረገገ ሆነና ተፈሪ
በሄደበት አገር በጀግንነት ሙያ ጠላት አሳፋሪ
ምርጥ የኢትዮጵያ ልጅ በምግባሩ አስኮሪ
ው ጣ ውረደና ቃኘው ጠላትክን በሙያ መለኪያ
ስለምታውቅበት ተከራክሮ መግዛት በጦሩ ገበያ
ብዙም እንዳትከፍል መጨረሻው እንዲያምር የስምህ መለኪያ
ሚዛኑ ታሪክ ነው የጉበዝ መለያው የጀግና መስፈሪያ



# የተደባለቀው ደም

በርዕሱ እንደተገለጠው የተደባለቀ ደም ስንል በብዙዎች ዘንድ በቀጥታ የሚተረጐመውን የትውልድ የደም ግንኙነት ወይም መደባለቅ አይደለም።

እኛ ልናሳውቅ የተነሣነው የሚያኮራና በማይረሣ የታሪክ አወነታን ነው። እውነተኛው በትክክል በተግባር የተተረጐመውን የኢትዮጵያንና የኮሪያን የደም ግንኙነት ነው።

ይህ በዓላማ ላይ በተግባር በግልጥ ምሳሌ የሆነው ማስረጃ ከብዙዎች ውስጥ አንዱ ነው። ጁን 21 ቀን እ·አ·አ· 1952 ዓ·ም· በወታደር መለስ በሪይሁንና በአንድ የደቡብ ኮሪያ ተወላጅ ሲቪል በጦር ግንባር የምህንድስና ሥራ ሠራተኛ የተፈጸም የጀግንነት ሰብአዊ ተግባር ነው። የታሪኩም አፈጻጸምና እውነተኛ መልኩ እንደሚከተለው ነው።

ሁለት የደቡብ ኮሪያ የምህንድስና ሲቪል ሠራተኞች በአንደኛ ሻምበል የጦር ግንባር በሥራ ላይ እንዳሉ የጠላት ከባድ አዳፍኔ ኢላማ ሆነው ይተኮስባቸዋል።

ምስኪኖቹ ኮሪያኖች ለማምለጥም ሆነ መከታ ለመያዝ አልቻሉም። ግዜም አላገኙም ሁለቱም በተለያየ ደረጃ ቆሰሉ።

ተራ ወታደር መለስ በሪሁን የአዳፍኔውን ተኩስ እንደሰማ የት፣ ከየት፣ ወዴት፣ እንዴት፣ ማን፣ምን

የሚሉትን አጣርቶ ለማገናዘብ ከባንከሩ (ምሽጉ) ሲወጣ ምንም እንኳን ቋንቋው ባይገባውም የኮሪያኖ ችን ጩኸት ሰማ ። የበኩሉንም ትኩረት ወሰደ የፃሩ ድምጽ ትርጉም ባይገባውም መስማቱ ከጆሮው አልፎ በልቡ ውስጥ ውጋት ሆነበት። ወዲያውኑ በአካባቢው የሚተኮሰውን የአዳፍኔ ጥይት ከምንም ባለመቁጠር ለሚደርስበት አደጋ ባለመፍራት ዘሎ መጥቶ አንደኛ ውን ቁስለኛ ተሸክሞ ሲመለስ ሌላ አዳፍኔ ተተኩሶ ሁለቱንም ወዲያውኑ መታና ገደላቸው።

እንደተቃቀፉ ሞቱ፡ በዚያው መልክ ተቃቅፈው ተገኙ።

በፑዛን የተባበሩት መንግሥታት መካነ መቃብርም እንደዚያው እንደተቃቀፉ ተቀበሩ።

— የጋራ መስዋዕትነት ምሳሌ

— የአንድነት ትግል ምልክት

— ለጋራ ግብ የተረጋገጠ ምሳሌ

— ኢትዮጵያና ኮሪያን በደም ያገናኘ እውነተኛ ታሪክ የሁለት እውነተኛ ሀገሮች መሰረት፡ ነው።

# በክብር አገሩ የተመለሰው የደጋኖች አጽም

ሞት በሰው ልጆች የመኖር ክልል ውስጥ ጊዜውን ጠብቆ የሚመጣ የማይቀር የተፈጥሮ ሕግ ነው። በመሆኑም በሕይወት መለዋወጡን የሚያዩ የሰው ልጆች የተለያየ መጠሪያ ሰጥተውታል። በዚህም መልካም ስም ወይም ተግባር ከመቃብር በላይ ለዘለዓለም ሲጠራ ይኖራል። የተባለው ተረጋግጧል።

ብዙዎች ወዳጆቻችን ዘመዶቻችን ሞተዋል። የመታሰባቸው ደረጃ በየመልኩ የተለያየ ነው አብዛኛው በቤተሰብ አካባቢ እንኳን እየተረሣ የሚመጣ ነው።

ዛሬ እዚህ ፎቶግራፋቸውን የምንመለከታቸው ከአርባ አራት ዓመታት በፊት ሕይወታቸውን ለተከበረ የተባበሩት መንግስታት የሴኩሪቲ ኩፕቲብ ዓላማ ሲባል መስዋዕት የሆኑ የኢትዮጵያ የሰላም ጀግና አንባሳደሮች ናቸው።

እነዚህ ጀግኖች ሕይወታቸውን ለዓለም ሰላም ሲሉ ስማቸውን በወርቅ ቀለም አጽፈው ታሪካቸውን ገንብተው በብዙ ሺህ ማይልስ ዕርቀው ሞተው አልቀሩም። የተከበረው የጀግኖች አጽም ንብረትነቱ የኢትዮጵያና ሕዝቧ በመሆኑ ሐምሌ 29 ቀን 1946 ዓ.ም ክብርን በተጐናፀፈ መልኩ ደማቅ አቀባበል ተደርጐለት አዲስ አበባ ሲገባ በግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና የኢትዮጵያ ሕዝብ የከበረ አቀባበል ተደርጐለታል። የጀግኖቹን ባለሙያነትና ስለአጽሙም ክብር የተደረገውን ሁሉ በማስመልከት ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከተናገሩት ስንደቅ ቃል እንጠቅሳለን።

“እናንት ወታደሮች........

እናንተና አናንተን የመሳሰሉ አብራችሁ ሆናችሁ ባደረጋችሁት ተጋድሎ ዓለምን ለሦስተኛ ጊዜ ያሰጋውን ታላላቅ ጦርነት አደጋ እንዲቀንስ አድርጋችሁ ፡—

ከተባበሩት መንግሥታት ጦር ሠራዊት ጋር ተሰልፈው የአጥቂነትን ወረራ ሲከላከሉ በኮሪያ ጦር ግንባር የወደቁትን የቃኘው ወታደሮች አጽም ለመቀበልና በክብር ቦታ ለማኖር ዛሬ በዚህ ሥፍራ ስንገኝ በጦር ሜዳ ለመውደቅ የደረሱበትን የተቀደሰውን መሠረታዊ ነገር እናስባለን።

ይኸው በኮሊክቲቭ ሴኩሪቲ ይህን የመሰለውን መስዋዕትነት ይጠይቃል በማለት ሰፊ ንግግር አድርገው የጀግኖቹ አጽም በቅድስት ሥላሴ ቤተክርስቲያን በክብር አርፏል።





ሻምበል፡ አበበ፡ ተገኝ፡ 1557 — የመ/አ፡ ተሻለ፡ ወንድምአገኘሁ፡ 2467 — ም/የመ/አለቃ፡ ደጀኔ፡ ተ፡ ወልዴ፡ 584 — ም/የመ/አለቃ፡ ሞገስ፡ አልዩ፡ 1653 — ም/የመ/አለቃ፡ [illegible]፡ አየለ፡ 3429 — ሌ/ ማ/ አሰፋ፡ ታዬ፡ 3904



ያ/፶/አለቃ፡ እሸቴ፡ አሙኔ፡ 3019 — ያ/፶/አለቃ፡ አጉናፍር፡ ወርቁ፡ 3512 — ያ/፶/አለቃ፡ አብርሃም፡ በላይ፡ 3275 — ያ/፶/አለቃ፡ አበበ፡ ገብሬ፡ 2191 — ያ/፶/አለቃ፡ ዜና፡ ሀብተ፡ ማ፡ 730 — ያ/፲/አለቃ፡ አሰፋ፡ ተበቁ፡ 1121



ያ/፶/[illegible]፡ ሽፈራው፡ ይልማ፡ 490 — ያ/፶/አለቃ፡ እሸቴ፡ ቀሌ፡ 399 — ያ/፶/አለቃ፡ እሸቴ፡ አንዳርጌ፡ 237 — ያ/፶/አለቃ፡ መኩንን፡ ብሥራት፡ 957 — ያ/፶/አለቃ፡ ተሾመ፡ ወ፡ ሚ፡ 2168 — ያ/፶/አለቃ፡ ሙሉጌታ፡ መርድ 1851



ያ/፲/አ፡ ጉርሙ፡ ጉደታ፡ 1752 — ያ/፲/አ፡ በቀለ፡ ወ/[illegible]፡ 2153 — ያ/፲/አ/ሀ፡ ማርያም፡ ወ፡ ጻድቅ፡ 3708 — ያ/፲/አ፡ ማሞ፡ ተሰማ፡ 2011 — ያ/፲/አ፡ ምትኩ፡ አየለ፡ 2989 — ያ/፲/አ፡ ኀይሉ፡ አለሙ፡ 3024



ያ/፲/አለቃ፡ ፈለቀ፡ ለማ፡ 1952 — ያ/፲/አለቃ፡ ውብቱ፡ ትርፌ፡ 463 — ም/፲/አለቃ፡ ለታ፡ በንቲ፡ 318 — ም/፲/አለቃ፡ ወልደ፡ ተንሣይ፡ 2001 — ም/፲/አለቃ፡ ማሞ፡ አየለ፡ 1864 — ም/፲/አለቃ፡ በላይ፡ [illegible]፡ 1978



ወ ፡ ገብሬ ፡ ዮሐንስ ፡ ኪሊሶ ፡ 2005 — ወ ፡ ቅርፌ ፡ መንገሻ ፡ 562 — ወ ፡ ከበደ ፡ መታፈሪያ ፡ 2463 — ወ ፡ ገለታ ፡ ደምሴ ፡ 2592 — ወ ፡ ሙለታ ፡ በፉቂ ፡ 2013 — ወ ፡ ወርቁ ፡ ኦፋርሶ ፡ 2329



ወ ፡ ወልደ ፡ ጻድቅ ፡ ተሰማ ፡ 2460 — ወ ፡ ካሳሁን ፡ ዲዲ ፡ 2466 — ወ ፡ ገርማ ፡ ጂበኺ ፡ 2205 — ወ ፡ ዝናቡ ፡ ገብረ ፡ ሕይወት ፡ 13 — ወ ፡ አበበ ፡ አሸናፊ ፡ 2427 — ወ ፡ ዓለም ፡ በላይ ፡ 468



ወ ፡ ማሞ ፡ ወ ፡ ማርያም ፡ 3220 — ወ ፡ ማሞ ፡ ዘውዴ ፡ 3187 — ወ ፡ በቀለ ፡ ካሳ ፡ 3620 — ወ ፡ ሸጉጤ ፡ ጂፈሶ ፡ 2998 — ወ ፡ ገብሬ ፡ ጻድቅ ፡ ወ ፡ ሐዋርያት ፡ 3623 — ወ ፡ ሙላት ፡ ወልደ ፡ ጻድቅ ፡ 3445



ወ ፡ ብርሃኑ ፡ ማላ ፡ 2032 — ወ ፡ ሙሉጌታ ፡ ሀብተ ፡ ወልድ ፡ 1596 — ወ ፡ ታምራት ፡ ካሳ ፡ 2434 — ወ ፡ ሃይሉ ፡ ወንዴ ፡ 1967 — ወ ፡ አበራ ፡ ካሳ ፡ 3022 — ወ ፡ ደመር ፡ ተሰማ ፡ 1778



ወ ፡ ተክለ ፡ ማርያም ፡ ፈይሳ ፡ 797 — ወ ፡ ወንዴ ፡ ደበታ ፡ 783 — ወ ፡ ፊጼንሳ ፡ ጉታ ፡ 1889

| | | |
|---|---|---|
| ✝ ወ ፡ ደምሴ ፡ ገብረ ፡ ሕይወት ፡ 1300 | ✝ ወ ፡ ዘርፉ ፡ እንግዳ ፡ [illegible] 1354 | ✝ ወ ፡ በቀለ ፡ በላይነህ ፡ 76 |
| ✝ ወ ፡ ደበታ ፡ ሐጉስ ፡ 479 | ✝ ወ ፡ መንግሥቱ ፡ አድማሱ ፡ 1240 | ✝ ወ ፡ ወልደ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ፈይሳ ፡ 482 |

ፎቶግራፋቸው ፡ ያልተገኘ ፡

እነዚህ ፡ ስማቸውና ፡ ሥዕላቸው ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የሚገኘው ፡ ዠግኖች ፡ በቃኘው ፡ ሻለቃ ፡ ጦር ፡ ባልደረብነት ፡ በኰሪያ ፡ ጦር ፡ ግንባር ፡ ተገኝተው ፡ ለተቀደሰው ፡ ዐላማ ፡ ትግላቸውን ፡ እስከ ፡ ሕይወት ፡ መሥዋዕት ፡ በማድረግ ፡ አገራቸውን ፡ ኢትዮጵያን ፡ ለዘላለም ፡ የሚያኰራ ፡ ታሪካዊ ፡ ሥራ ፡ ፈጽመዋል ።

# የኮርያ ጦርነት

ከሀብተጊዮርጊስ ገ/ጻዲቅ

በስድስት ሺ ዘማች በሦስት ዓመት ጦርነት ፣
ሁለት አገሮች በተካፈሉበት ።
ከአውሮፓ አሜሪካ ታላላቅ መንግሥታት ፣
ኢትዮጵያ ብቻ ነች ምርኮ የሌለባት ።
ምን ሊያደረጉ መጡ እነዚህ ጥቁሮች ፣
ሳይሉን አልቀሩም እነዛ ሰዎች ።
መናቅን የማይወድ ደጉ ፈጣሪያችን ፣
ከነሱ አብልጦናል ቁሞ ከፊታችን ።
ማርከናቸው እንጂ እኛ በጠላት ፊት ባለመውደቃችን ፣
በዓለም ላይ ተደንቋል በታሪክ ስማችን ።
ጠንክሮ ሲዋጋ ፍጹም ሳይበገር ፣
እንደሰው አይደለም ሞቶ እንኳን ሲቀበር ።
አፅሙ አገር ሲገባ ሥጋው እዚያ ሲቀር
ይህ ነበር እድሉ የኮሪያ ዘማች የጥንቱ ወታደር ።
ሲዋጋ ተጐድቶ መሬት ላይ ሲወድቅ ፣
ፈጥኖ ይመረዛል በበረዶ ጠንቅ ።
ባልተለመደ አገር አይቶት በማያቅ ፣
በድል ተመልሷል ዘምቶ ሩቅ ምስራቅ ።
እንኳን ቆስሎ አግኝቶ ወድቆ ከመሬት
ጤነኛ ሰው ያስራል እንደ አግር ብረት ።
ድልድዮች አይኖሩም ከዚያም እዚያ ማዶ
ወንዞች ይሞላሉ በግግር በረዶ
ቃኘው ድል አድርጓል በዚያ ላይ ራምዶ ።
አመሰግናለሁ የሚል በሌለበት ፣
ሕንድና ፓስፊክ በተጣለሉበት ።
በባህር ላይ ጉዞ በረጅም ርቀት ፣

ዋና ምክንያት ነበር ኮሪያ የዘመትንበት ።
መስዋዕት ሆነን እዚያ የሞትንበት
የዓለም መንግሥታት እምነት የጣልንበት ።
ለካስ እንዲያ ኖሯል የጦር ጓደኝነት?
ውለታችን ቢርቅ ቢያልፍም አርባ ዓመት
አባካችሁ ዛሬ ሀብቱን መልሱለት ፣
ተመልሶ አይመጣም አክትሟል ኮሚኒስት ።
ሲታረዝ አልብሶ ሲራብ ያበላው
ላንዱ ላቡን ሲያፈስ ለሌላው ደሙን
ችግር ሲያንገላተው ማን ይረዳው አሁን ።
ዓለም አቀፍ ዝና ክብር ያተረፈው
አይጠላም ነበር ለዘለቄታው
ይህ ነበር አንደኛው እንደምናውቀው
ኩርፊያና ጥላቻን የቀሰቀሰው ።

# ዜና ደቡብ ኮሪያ

ወደፊት በዚህ ርዕሥ ሥር ለመ ግለጥ የምንሞክረው በአብዛኛው በኮ ሪያ ያሉ ስለተመሣሣይ ማህበራት፣ ሙያ ነክ ዜናዎች፣ እንዲሁም የደ ቡብ ኮሪያን ታላላቅ የዕድገት ውጤ ቶችንና አስደናቂ ሁኔታዎችን ይሆ ናል።

ዛሬም የምናቀርበው ለእኛ ከፍ ተኛና አስደናቂ የሳይንስ ምርምር ውጤት ብለን ያመንበትን ነው ።

# ሹፌር የሌለው መኪና በሲውል አውራ ጎዳና

በዘመናችን ብዙ አስደናቂ ነገ ሮች ብቅ ብቅ ብለዋል። እነዚህንም ክስተቶች ትክክል ነው ብሎ ለመና ገር የሁኔታውንም መራቀቅ ለማሳ የት በቀላሉም ለማሣመን ያስቸግ ራል።

በተለይም ከአርባ አምስት ዓመት በፊት በአይዲዮሎጂ ልዩነት በጦርነት ማጥ ውስጥ ገብታ ሕዝ

ከደ.ቡ.

ቧም ፣ሀብቷም የተማረ የሰው ክም ችት፣ ኃይሏም ተንኮታኩቶ ከወደ ቀና መሬቷም እንኳን ነዶ ኢኮኖሚ ዋም ወደ አመድ ከተለወጠ በኋላ የአሁኗ ደቡብ ኮሪያ ታምር እየሰራች ነው።

እንደገና በመቋቋም ግንባታን በማጠናከር፣ በአንድ ትክክለኛ ዓለማ በመመራት፣ ቆርጦ የተነሣው የሪፖብሊክ ደቡብ ኮሪያ ሕዝብ፣ በሳ ይንስ ምርምር ዓለምን ቀድሞ እያስ መሰከረ ስናይ፣ ሕልም ወይስ ቅዠት? ብሎ ያስጠይቃል።

አዋንታዊ መልሱ ግን ቆር ጠው ስነሥርዓት ባለው ሕዝባዊ አቋም አንድነትን ጠብቆ ለመራ መድ ኢኮኖሚው ለደቀቀ ሕዝብ መሠረታዊ ምሳሌ ነው ።

በሌላ መልኩ ደግሞ ለዚህ ጠን ካራ ለሆነው አንድነት ያለው ሕዝ ባዊ አቋም ብዙ የምስክርነት ማስረጃ ዎችን ማቅረብ ይቻላል። ለዚህም እንደምሳሌ ብንጠቅስ ጦርነቱ እየተ ካሄደ ባለበት ወቅት የተለያዩ የጦር መሣሪያዎች እልል እያሉ ሠይጣናዊ ድምጻቸውን ወይም ጩኸታቸውን ሲያስሙ ጠንካራውን የደቡብ ኮሪያ

የሩዝ ገበሬ፡ በአስቸጋሪው የሩዝ ማሣ ወስጥ ያየ ሁሉ ለዚህ ጠንካራ የምር ምር ውጤት አስተዋጽኦ ያለው የግን ባታ መሠረት መሆኑን ያረጋግጣል።

ዛሬ ያነበብኩትን በርዕሱ የተ ጠቀሰውን ሳይንሳዊ ከፍተኛ እርምጃ ለማካፈል ስመሰክር ወደኋላ ሄጄ በዓይን በሙከራ ጊዜ የታየ ምስክር ነት ለመስጠት የገፋፋኝና የኮረኮረኝ ስሜት ቢኖርም በመቶኛ ሲሰላ ውጤቱ አነስተኛ መሆኑን ባውቀ ውም ላፍነው አልቻልኩም።

በሲውል ወርሃዊ መጋዚን ጃን ዋሪ 1995 መሠረት የኮሪያ ዩኒቨር ስቲ የምርምር ቡድን ያለሹፌር የሚ ነዳ ጂፕ ብዙ ሕዝብ በሚርመሰመስ በት በሲውል ከተማ ማንቀሳቀስ ተችሏል።

ይህም በዓለም ደረጃ ያለሹፌር የሚነዳ መኪና ከላብራቶሪ ውጪ ብዙ ሕዝብ ባለበት አውራ ጐዳና ሲከናወን የመጀመሪያው መሆኑን የምርምሩ ቡድን መሪ ፕሮፌሰር ሐን ሚን ሆንግ ተናግረዋል።

ፕሮፌሰር ሐን ሚን ሆንግ ሲና ገሩ ባለፈው ጃንዋሪ በኮምፒዩተር ሙከራ ያለሹፌር ስለሚነዳው ጂፕ በተለያየ መልክና ጠባይ ባለበት አወራ ጐዳናዎች ተሞክሯል።

ይህም በሙከራ የተነዳው ሹፌር አልባ ጂፕ ማንኛውንም በእን ቅስቃሴ ወቀት የገጠመውን ሁሉ ለኮምፒዩተሩ የሚያስተላልፍበት ሁለት ካሜራዎች አሉት፤–

በነዚህም ካሜራዎች ማንኛው ንም መረጃዎች በመከታተል ኮምፒ ዩተሩ የሹፌርነቱን ተግባር ይፈጽ ማል። ሙከራው በብዙ መልኩ አጥ ጋቢነቱ ተረጋግጧል። እንግዲህ ከሙከራ ወደ ገበያ ይወጣ ይሆን?

ሹፌር የሌለው መኪና ጥቅሙ ምን ይሆን?

ሹፌሮችስ መብታችን ተነካ ይሉ ይሆን?

ጊዜ መልሱን ይስጥ!

ስለሆነም የሳይንሱ ዕድገት ምርምር እሰይ የሚያሰኝ ነው። ለደ ቡብ ኮሪያ ምርምር መልካሙን ሁሉ እንመኛለን።

ከዚያ አሰቃቂ የፈተና ጊዜ ወጥቶ እዚህ ደረጃ መድረስ አንቱ የሚያሰኝ ሕዝባዊ ድል ነው።

# የአባትና ልጅ የስልክ ጥሪ

ልጅ/

ሀሎ ውድ አባቴ አንተ ዕንቁ ጀግና
እስኪ ስማኝ እኔን ቶሎ ብለህ ቀና
ከአርባ ዓመት ዕርቀት ረጅም ጉዳና
ተመሥርቷል መስመር በቀና ህሊና
አንተ በቀየስከው በዚያ የሰላም ሚና

አባት/

እሰማሀለሁኝ አንተ ብሩክ ልጄ
ከሰላሙ ሥፍራ ከዚያ ቅዱስ ደጄ
በተሰጠኝ ቦታ በመልካሙ ተግባር በዚያ በግዳጄ
ስለ ደወልክልኝ ደስ ብሎኛል ልጄ
ከአርባ ዓመት በኋላ በመገናኘቴ ከልጄ ወዳጄ

ልጅ/

ድምፅህን ስሰማ ድርብ ደስታ ነው፣
ከአርባ ዓመት ዕርቀት ከአባቴ ከቃኘው
አሁን በኢኮ.ዘ.ማ በመደገም ላይ ነው፣
ከአንተም ከእኔም አልፎ የአገር ክብር ነው፣
ቃኘው ጀግና አባቴ አልሞተም ሕያው ነው።

አባት/

በርታ አንተ ልጄ ተባረክ አሁንም
ስማኝ ውድ ልጄ ብዙም አልልህም
ከቶ የኔ መለየት አይሰማህ ምንም
የሰው ዘር እንደሆን ዘላለም አይኖርም
በዕድሜህ ተጠቀም ቋሚ ነገር ሥራ
የኔ ልጅ ነህ በታሪኬ ኩራ፣
ጠይቅ ምስክሮች በኮሪያ ጦር ሜዳ በዩክ፣ቲሪአንግል፣
በግመል ተራራ
ምርጥ ጀግና መሆኔን የታሪክ አውራ።

# የኮሪያ ሠፈርና ትምህርት ቤት

በተለምዶ የኮሪያ ሠፈር ተብሎ የሚጠራው የአሁኑ ወረዳ 13 ቀበሌ 06 እና 05 የሚባሉት ናቸው።

በመሠረቱ የክብር ዘበኛ የቃኘው ሻለቆች በልደረቦች ኮሪያ ዘምተው ከተመለሱ በኋላ፣ ቦታውን በስምሪት፣ በጭሰኝነት፣ በግዢ አግኝተው ለመኖሪያ የመሠረቱት አካባቢ ነው።

ቀደም ሲል አካባቢው የክብር ዘበኛ የእጩ መኮንኖች ጦር አካዳሚ መለማመጃና የጠንካራ ምሽግ ሞዴል ነበር። ኋላ የኮሪያ ዘማች ዕድገት አስካሸነፈ ድረስ አጠቃላይ የክብር ዘበኛ ሠራዊት የቅርብ የልምምድ ቀጠና ሆኖ አገልግሏል።

መቼም አንድ አካባቢ በመኖሪያ ሠፈርነት ሲመሠረት ማህበራዊ መግባባትና አብሮ የመኖር ዘዴን በሂደት ያልውድ በግድ ይፈጠራል። በዚህን ጊዜ ነበር የቃኛው ሻለቆች አባላት ዝና ተሳትፎአቸው ከፍተኛ የሆነው። በመሆኑም ዕድርና ትምህርት ቤት አቋቋሙ።ልጆቻቸውና ደካሞች በወንዝ ውሃ ሙላት እንዳያልቁ ድልድዩን አሰሩ። ሌላም ሌላም የዕድገትን ፈር ቀየሱ።

ለዚህም መሠረታዊ ታሪክ ያለቀቀው የሥራ ክንውን ቀጥሎ አንዳንድ ማስረጃዎችን ለማቅረብ እንሞክራለን።

መስከረም 23 ቀን 1961 ዓ.ም. የብሔራዊ ሎተሪ ድርጅት ዋና ሥራ አስኪያጅ አቶ ኢቦ ኑሜር ለአካባቢው የልማት እንቅስቃሴ የበላይ ጠባቂ 8000(ስምንት ሺህ) ብር ለት/ቤቱ እርዳታ ሲያደርጉ ከተናገሩት እንጠቅሳ ለን፤

" ይህ ራሱን የሚረዳ ሠፈር ይኽን ያህል ገንዘብ አዋጥቶ የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርት ቤት ሠርቶ ከ850 ተማሪዎች በላይ ያስተማረውና ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት ለመሥራት የበቃው፣ ከነዋሪው ሕዝብ ሰባ አምስት እጅ የወታደር ቤተሰብ ነው" ሲሉ፣

የአዲስ ዘመን መጋቢት 20 ቀን 1964 ዓ.መ. ግርማዊ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኮሪያ መንግሠት የሰራውን የመማሪያ ክፍል ጐበኙ በሚል ርዕስ ባወጣው አምድ ወስጥ የግርማዊነታቸውን ንግግር እንጠቅሳለን።

" ኢትዮጵያውያን አባቶቻችን በጀግንነት የፈፀሙት ተግባር በታሪክ ጐልቶ የሚታይ በመሆኑ መልካም ስም አትርፎለታል። ይህም አሁን ባሉት ሕፃናት ሆነ ወደፊት በሚተካው ትውልድ ዘንድ የበለጠ እየጐላ የሚሄድ እንደመሆኑ መጠን የአገራቱንም ስም በመልካም ሲያስጠራ የሚኖር ነው።" ካሉ በኋላ " የደቡብ ኮሪያ መንግሥት ይህን ቤት ሠርቶ መስጠቱ የእኛም ሹማምንቶችና የክብር ዘበኛ አባሎች ያከናወኑት ሥራ በአካባቢው የሚገኙት ሕብረተሰቦችም በመተባበር የፈፀሙት ተግባር ደስ አሰኝቶናል።" በመላት ተናግረዋል።

እንዲሁም በኢትዮጵያ የደቡብ ኮሪያ ሪፑብሊክ መንግሥት አምባሳደር ሌ/ጄኔራል ቻንግ ችሪያንግ ያደረጉትን ሰፊ ንግግር ከመፈፀመቻው በፊት " የትምህርት ቤቱ ለሁለቱ አገሮች ጠንካራ ወዳጅነት መታሰቢያ ሆኖ የሚኖር መሆኑን አስምረውበታል እንዲሁም፡

መስከረም 4 ቀን 1965 ዓ·ም የደቡብ ኮሪያ መንግሥት 50,000 ሺህ ብር በማውጣት ተጨማሪ የመማሪያ ክፍሎችን ለማሠራት ዕቅድ ያለው መሆኑን ጋዜጣዊ መግለጫ ሰጥተዋል። ዓላማውንም በመግለጥ ይኸንን ለማድረግ የተወሰነው በሁለቱ አገሮች መካከል ያለው የወዳጅነት ግንኙነት በተግባር እንዲገለጥና ዘለቄታም እንዲኖረው በማሰብ መሆኑን አምባሳደሩ አስገንዝበዋል፤ ይልና ጋዜጣው ልዩ ልዩ ግምታቸው 2000 ሺህ ብር የሚደርስ የትምህርት መሣሪያዎች በወቅቱ መሰጠታቸውንም ገልጧል።

አሁን በቅርቡም ኢኮዘማ ከተቋቀመ በኋላ በትምህርት ቤቱ ቀጥታ ግንኙነት በማድረግ የትምህርት መሣሪያዎች ጥገና ፣ በቤት ዕደሣ ፣ በጽዳትና በአጥር ሥራ የኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች ማህበር አባላትና ቤተሰብ ነፃ አገልግሎት ሰጥተዋል ።

በኢትዮጵያ ኮሪያ ዘማቾች አማካይነት ተደጋጋሚ ብዙ ጉብኝቶች ተደርገዋል። በውጤቱም የገንዘብና የማቴሪያል ዕርዳታ ተደርገል። ለምን! ምን!ማን? የት? እንዴት ወዘተ… የሚሉትን ለመመለስ ስንሞክር መሠረተ ግንኙነቱ የቃኘው ሻለቆችና የኮሪያ የመከራ ጊዜ ግንኙነት መሆኑን እንደርስበታለን።

ሠፈሩም ትምህርት ቤቱም በቃኘው ሻለቆች አባላትና በጥቂት ሌሎች

ሰዎች የተመሠረተውና በሕብረት ሥራው የተፈጸመው ፣ በልማድ ኮሪያ ሠፈር ተብሎ ዕቅዱ ግቡን በመታው አካባቢ ነው።

አሁንም በታሪካዊ ቁርኝት ሳይለያዩ ከቃኘው ሻለቆች ገድል ጋር አብሮ እየታዩ ነው። ለወደፊቱም ዘለቄታዊ አበረታች ሁኔታዎች እየታዩ ናቸው። በመሆኑም ቀደም ሲል በተለይ የትምህርት ቤቱ ስያሜ ከልማቱና ከዕድገቱ ጋር ለማራመድ ስሙ የተለወጠ መሆኑ እንደሐቅ ተይዞ በኋላም በአይዶሎጂ ምክንያት ወደነበረበት መጠሪያ ባይመለስም የሕብረት የሥራ ውጤት በመሆኑ ይኸንኑ እንዲያንፀባርቅ ሆኖ ተሰይሟል። ይሁን እንጂ እውነተኛ ታሪክ ሊጠፋ አይችልምና የቃኘው ሻለቆች ዘማች አባላት በመጀመሪያ የሕብረት ትግል ባደረጉትና በመሰረቱት ቢጠራ የታሪክ ከበሬታ ነው፤ እንለለን።



የኢትዮጵያ ጀግኖች መታሰቢያ ሐውልት በኮሪያ

# ሐውልታችን

በኮሪያ ሰላም ወዳድ አገሮች ሁሉ ፣ ለተሰለፉበት ክቡር ዓላማ ፤ ኢትዮጵያም ለገባችበት ቃል ኪዳን የቃኘው ሻለቆች ከፍተኛውን መስዋዕትነት ከፍለው ታላቅ ታሪክ መስርተዋል ።

ለዚህም ታሪክ መጠሪያ በደቡብ ኮሪያ ቹንቻን በተባለው ቦታ ይኸ ትልቅ መታሰቢያ ጉልቶ ይታያል ።

ቃኘው ሻለቆች ለፈፀምነው አስደናቂ መስዋዕትነት የቆመ ሐውል ታችን ነው ።

ነብይ በአገሩ ....... እንደተባለው ነው ። የጀግኖቹ ትዝታና ፍቅር እስከዛሬ ድረስ በአብዛኛው የኢትዮጵያውያን ልብ ውስጥ መኖሩን ብናምን በመንግሥት ደረጃ ፡ የተረሳን ጀግኖች መሆናችንን የምናስታውስ በት የትግዛብት ጕን አብሮን አርጅቷል ።

ሆኖም አስታውሰው ይኽን ሐውልት ላቆሙልን ለደቡብ ኮሪያ ሕዝብና መንግሥት ምስጋና ይገባል ።




የቃኘው ሻለቃ መታሰቢያ ሐውልትን በሶስት ቋንቋዎች የሚገልጽ ጽሁፍ

# ለአባት የጥሪ ደውል የብላቴናው ምላሽ

በገናናው ወጨሮ

ሮበርት ጂ ኢንገርሶል የተባለው ጸሐፊ "በአባቶቻቸው የማይኮሩና ልጆቻቸው የማይጨነቁ በቅሎ ዎች ናቸው" እንዳለው ሁሉ፤ እኛ የኮሪያ ዘማቾች የአብራክ ክፋዮች ከ45 ዓመታት በፊት አሁን እኛ እንዳለንበት ዕድሜ እነሱም በተጠቀ ሰው ወቅት አፍላ የነበሩ ወጣት የክ·ዘ·ሠራዊት ጀግኖች ዛሬ በኢ·ኮ·ዘ·ማ ተሰባስበው ያሉ የወቅቱ አዛ ውንት አባቶቻችንና የሟቾችን የጀግ ንነት ተጋድሎ በማሰብ እኛም ልጆቻ ቸው እንድንኮራባቸውና የአባቶቻች ንን ዓርአያ በመከተል የመንፈስ ጀግ ኞች እንድንሆን አባታዊ የጥሪ ደወል ቀርቦልናል።

የተከበሩ ጀግኖች አባቶቻችን ኢትዮጵያ በገባችው በተ·መ·ድ የሴ ኪዩሪቲ ኮሌክቲቭ ቃል ኪዳን መሰ ረት በደቡብ ኰሪያ ለተነሣው የኮሚ ኒስት ወረራ ለመከላከል እንዲችሉ ከክ·ዘ· ሠራዊት ውስጥ ተመርጠው እንዲሄዱ ሲደረግ፣ በወቅቱ ለዘመቻ ቸው "ቃኘው" የሚል ስያሜ ተሰጥ ቷቸዋል። የቃሉ አግባብ ትርጉም "ቃኘው" ማለትም ኢትዮጵያዊና አማርኛ ትርጉሙ "አመጸኛ ቀጪ" ማለት ነው። እውነትም እንደየስያ ሜው ሁሉ ዓመጸኛ ቀጪ ለመሆና ቸው በወቅቱ ይታተሙ በነበሩ የዓ ለም ጋዜጣዎችና በደራሲዎች እንዲ ሁም በኮሪያኖችና በራሱ የጠላት ኮሚኒስት ጦር፣ የተ·መ·ድ የጦር አዛዦች አሜሪካኖች ሲመሰክሩ በአ ጠቃላይ ታሪካዊ ሥራቸው በኮሪያ መታሰቢያ ሐውልት በማቆም ድንቅ ስራቸው ተመስክሮላቸዋል።

እኛም ክፋዮቻቸው ለቆመላቸው ሐውልት ማንቀሳቀሻ ሞተር በመ ሆን እኛስ እንደነሱ ጀግኖች የማንሆ ንበት ምክንያት አይታይም። ይኸም ሲባል "የዘበኛ ልጅ ዘበኛ ይሆናል" ተብሎ ድምዳሜ እንደማይሰጠው ሁሉ እኛም "የወታደር ልጅ ወታ ደር" ብቻ እንሁን ማለት አለመሆኑ ሊታወቅ ይገባል። የተለያዩ ሙያ ያላቸውና በተለያየ የሙያ ዘርፍ የተ ሰማሩ የዘማች ልጆች እንደመሆና

ቸው አግባብ በመሰባሰብ አባቶችቻ ችን ባስገኙልን የታሪክ ውርስና ወደ ፊት ለሚገጥሙን የተለያዩ እድሎች ለምሳሌ የተለያዩ ረድኤት ሰጭዎች ተቋሞች ግለሰቦች ከሚያስገኙልን ቱሩፋት በአግባቡ ተጠቃሚ ለመ ሆን በቅድሚያ አኩሪውን የአባቶቻ ችንን የጀግንነት ታሪክ አንፀባራቂ የሆነውን የቃኘውን አርማ በማንገብ ታሪካቸው እንዲዘከር ማለትም ከት ውልድ ትውልድ እንዲሸጋገር ኃላፊ ነትን እንድንረከብና የተረከብነው ንም አደራ ለልጅ ልጆቻቸው መድ ረስ መቻሉን ከወዲሁ እርግጠኛ እን ዲሆኑ በተግባራዊ እንቅስቃሴያችን ለናረጋግጥላቸው ይገባል። የዘማች ልጆች በምናደርገው እንቅስቃሴ ሁሉ ከኮሪያና ሌሎች ወዳጅ አገሮች እንዲሁም የረድኤት ሰጪ ድርጅ ቶች ጋር በሚኖረን ጤናማ ግንኙነ ትና ልናገኝ በምንችለው እገዛ የአ ባት ማህበራችን ኢ·ኮ·ዘ·ማ በእንቅስ ቃሴያቸውም ሁሉ አብሮን ሆኖ እን ደአባትነት ሊንከባከበንና እየተቆጣ ጠረ የታሪክ ማውረሱ ሂደት ይቀጥ ላል እንጂ "ልጅ ይሮጣል እንጂ አባቱን አይቀድምም" ወይም "ልጅ ያቦካው ለራት አይበቃም" እንደሚ ባለው የአገራችን ብሂል እንዳይተረ ትብንና እንዳንሰናከል በዘማች ልጆች ስም ወጣቱ ተሰባስቦ ከመስ መር ውጭ ሆኖ እንዳይፈነጭ በአ ባቱ ኢ·ኮ·ዘ·ማ ጥላ ስር ሉጓም ሊበ ጅለት ይገባል።

ለዚህም የዘማች ልጅ ሲሰባሰብ የተለያዩ ስሜታዊ የሆኑ ግልብ ሀሳቦ ችን በማራገብ የዘማች ልጆችን ወደ አልተፈለገ አቅጣጫ እንዳይጠመዝ ዙና ከአባት ማህበሩ አላማ ጋር የሚ ቃረን ሁኔታ ተፈጥሮ እንቅስቃሴያ ችን ተሰናክሎ እንዳይቀር ለረጅሙና ለታላቁ የተቀደሰ አላማችን መሰና ክል ሊሆኑ የሚችሉ ግለሰቦችን ጠን ቅቆ በማወቅና በመገሰጽ ማረቅ ሲገ ባን መተዳደሪያ ደንቡ በሚሰጠን መብትና ግዴታ አንፃር በአግባቡ ይወክሉናል የምንላቸውን የዘማች ልጆች መርጠን የተመረጡትን ግለሰ ቦች ማንነት እኛም ሆን የኢ·ኮ·ዘ·ማ የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴና ምክር ቤት በሚያደርገው የማንነት ጥናት መሰረት አጣርቶ ሲያፀድቅልን የታ ሪክ አደራን መቀበልና በጤናማ ሁኔታ የቀጣይ እንቅስቃሴዎቻችንን ሂደት በአግባቡ ተግባራዊ ማድረግ ይጠበቅብናል ።

በመሰረቱ ይህ ማህበር ከተቋቋመ የአንድ ጨቅላ እድሜ ባለቤት ቢሆ ንም በአጭር ጊዜ ውስጥ ባሳየው እንቅስቃሴና ለአባላቱ ባስገኘው ታላቅ ተስፋ መስራች ምክር ቤቱ ሳያስመሰግን የሚታለፍ ጉዳይ አይደ ለም።

እኛም ልጆቻቸው የአባቶቻችንን

